# ህ ብ ረ ሠ ዋ ሥ ው
# COMBINED GRAMMAR

## አማርኛና እንግሊዝኛ ።
## *Amharic and English*

ከደማ ዘንግእግዜር ሻለቃ ።
*By Demma Zenghisgher*
(ዘብሔረ ጉራጌ)

አዲስ፡ አበባ ፡ ህዳር ፡ ፳፰ ቀን ፡ ፲፱፻፷፩ ዓ. ም.

**Addis Ababa** 1961 E. C.

# ህ ብ ረ ሠ ዋ ሥ ው
# COMBINED GRAMMAR

## አማርኛና እንግሊዝኛ ።
## *Amharic and English*

ከደማ ዘንግእግዜር ሻለቃ ።
*By Demma Zenghisgher*
(ዙብሔረ ጉራጌ)

በግርማዊ ፡ ቀዳማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ዘኢትዮጵያ ፡
በሠላሣ ፡ ሁለተኛው ፡ ዓመት ፡ መንግሥት ፡ በ፲፱፻፶፬ ፡ ዓመት ፡ ምሕረት ፡ ታተመ ።

***The first edition of this book was published during the reign of His Imperial Majesty Haile Selassie I, Emperor of Ethiopia.***

**አዲስ ፡ አበባ ፡ ህዳር ፡ ፳፫ ቀን ፡ ፲፱፻፷፩ ዓ. ም.**

**Addis Ababa 1961 E. C.**

**ትንሣኤ ዘጉባኤ ማተሚያ ቤት**

ማ ው ጫ ። TABLE OF CONTENTS


መቅድም . . . . . . . . . 5

መግቢያ ፤ ቋንቋ ፤ ፍልሠተ ቋንቋ ፤ የፊደል ፍጥረትና መሻሻል 7—12

- አሥራ ሠባት ነገደ ኢትዮጵያ ቋንቋ 11
- የቋንቋ ጉጂነትና ጥቅም 12

የነገደ ኢትዮጵያ ፊደል An Ethiopin Characters . . 13—16

- ሥርአተ ነጥብ An amharic Panctuation 15
- ሥርአተ ቅፅ 16

ድርሠተ ተፈጥሮ ፤ ንባበ ፤ ግጥመ ፤ ታሪክ ፤ ገላጭ ፤ ራእየ ፤ ድርሠት 17–25

- አተታዊ (አተታ) ፤ ሁኔታዊ ፤ ምዙነ ድርሠት 21–25

ውለታ አይረሣም . . . . . . . . 25–27

የንግግር ክፍል Part of Speach . . . . . 28

ሥም Noun . . . . . . . . 28–34

- ተራ ሥም Common Noun 31
- ምድብ ሥም Proper Noun 32
- ህብረ ሥም Collechive Noun 32
- ጥቅመ ሥም Material Noun 33
- ግብረ ሥም Abstractive Noun 33

ልምምድ Exrcise . . . . . . . . 34

ጾታ Gender . . . . . . . . 35-38

- ወንዴ Masculin 36
- ሴቴ Feminien 36
- ተራ ጾታ Common gender 37
- ግኡዝ Neuter 38

ልምምደ ጾታ Exercises . . . . 38

ቁጥር Number . . . . . . . . 38–39

ሞያ Case . . . . . . . . . 39–46

- አግባበሞያ (ሥከተቃል) 40
- ሥመሞያ Nominetive case 44
- ግዜተሞያ Objective case 44
- ጥቅመሞያ Possessive case 45–46

ሥመምትክ Pronoun . . . . . . . 46–52

- ምድበ ሥመምትክ Personal Pronoun 49
- ጥቅመ ሥመምትክ Possessive Pronoun 49
- ምዙነ ሥመምትክ Reflexive Pronoun 50
- ምልከታ ሥመምትክ Demonstrative pronoun 50
- መጠይቀ ሥመምትክ Interogative Pronoun 51

ማውጫ ። TABLE OF CONTENTS


ወገነ ሥመምትክ Relative Pronoun 51

የሥመምትክ ሥኬት Usege of Pronoun . . . . . 52-55

ልምምዷ ሥመምትክ 53-55

ግሥ Verb . . . . . . . . . . . 56-63

መሠረተግሥ ጉዋደግሥ ነባርግሥ 58

እዘግሥ ውዝግበግሥ ሣፌግሥ 59

የእርባታ መክፈቻ የእርባታ ምንጭ 60-62

ልምምዷ ግሥ 63

ፍዘግሥ (ተውሣከግሥ) Adberb . . . . . . . 64-70

ምድብ ፍዘግሥ 66

ጥገኛ ፍዘግሥ 66

ወቅተ ፍዘግሥ Adverb of time 67

ትግነ ፍዘግሥ Adverb of place 68

አሀዘ ፍዘግሥ Quantitative adverb 68

ግብረ ፍዘግሥ Adverb of Manner 69

ምጥነ ፍዘግሥ Adverb of degree 69

ምክንያተ ፍዘግሥ Adverb of reason 69

አዎንታና አሉታ ፍዘግሥ Adverb of affermative & negative 70

ሁኔታዊ ፍዘግሥ Adverb of condision 70

ቅፅል (ሥምአከል) Adjective . . . . . . . 72—

ቅፅለ አገባብ Kind of adjective 75

አይነተ ቅፅል Quality adjective 76

አሀዘ ቅፅል Quantitative adjective 77

ምልከታ ቅፅል Demonstrative adjective 77

ድልድለ ቅፅል Distributive adjective 78

ጥቅመ ቅፅል Possessive adjective 78

መጠይቀ ቅፅል Interogative adjective 79

ግንዝበ ቅፅል Reflexive or Enphezaizing adjective 79

ልምምዷ ቅፅል 80

መሥተዋድድ Preposition . . , . . . . 81—83

ልምምዷ መሥተዋድድ 83

መሥተፃምር Conjunction . . . . . . . 84—86

ቃለግን Interjection . . . . . . . . . 87—89

ድምፅግን ፤ ድንቀግን ፤ ፍንድቀግን 88

ትክዘግን ፤ ዛቻዊግን ፤ ውደሣግን ፤ ሥንብተግን 89

# መቅድም ።

ሠዋሥው ታላቅ ጥበብ ነው ፤ ሠዋሥው የነገድ የትንሽነት ፣ የትልቅነት ወይም የሃይማኖትና የእርጅና ባህል የማይከተል እንደተፈለገ የሚገኝ ነው ።

በዚህ ህብረ ሠዋሥው አሣቤ መነሻ ያደረኩበት ለጐለመሡት ወይም ለመካከለኞች ሣይሆን በአማርኛና እንግሊዝና ሠዋሥው ለሚያዘግሙት እንግሊዝኛው ከአማርኛው ጋር በማነፃፀር ፈጥኖ ደራሽ ሆነው እንዲገኙ በማሠብ ነው ።

ስለዚህ ከሠዋሥው ሠዋሥው በአጠረ በቀለጠፈ ዘዴ ስለሚበልጥ በሥልጣኔ ከተራመዱ አገሮችም ለምሣሌ በአሜሪካ በየዓመቱ ከሚታተሙ (300) ሦሥት መቶ ሚሊዮን መጻሕፍት ከመቶ አርባ 40% የሠዋሥው ብዛትና ከ15 ሚሊዮን ዓይነት አብዛኛው ሢሆን በአንደኛው የከበደው በሌላው ተሻሽሎ ፤ በአንደኛው የተሠወረው በአንዶኛው ተገልጾ ይገኛል ።

እነሆ ይህ ሥዕላዊ ሠዋሥው በ . . . ገጽ ስለሚገኝ ለተማሪም ሆነ ለመምህር አማርኛችንም ለማወቅ ለሚመኙ በዚህ መጀመርያ ደረጃ እየታገዙ የያንዳንዱ የንግግር ክፍል መረዳት እንዲችሉ ነው ። መቼውንም ቢሆን ነቃፊ ከሌለ ብልህ አይፈጠርምና ከሠው ሥህተት ከብረት ዝገት ከእጅ እድፍ ሥለማይታጣ ለኔ የተሠወረ ለተመራማሪ በሚገለጽ እርምት ይቅርታ ።

ደማ ዘንግ እግዜር (ሻለቃ)

ዘብሄረ ጉራጌ ።

# መግቢያ ።

እነሆ ከዚሁ ቋንቋ (15) አሥራአምስቱ በነገደ ሤም (25) ሃያ አምስቱ በነገደ ካም (32) ሠላሣ ሁለቱ ቋንቋ በነገደ ያፌት አብራክ አከፋፍሎ ከዚያን ጊዜ ጀምሮ እብራይስጥ ቋንቋና አስተዳደር በ(2796) ሁለት ሺህ ሰባት መቶ ዘጠና ስድስት ነገደ ቋንቋ መፍለስ የሶስተኛውን ጊዜ ምዕራፍ መክፈቱን ታሪክ ይነገረናል ዘመኑም 1950 ዓ. ም. ሲደመር 4663 ዓመት ነው ።

እንዲሁም በ4, 499,998, 054 ዓመተ ዓለም ላይ ወይም ከልደት በኋላ በአራት (4) ዓመተ ምሕረት ላይ አሥራ ሁለቱ (12) ሐዋርያዎች በመለኮት ኃይል በ72 ቋንቋ ማስተማራቸውን አዲስ ኪዳን ይነግረናል ። አሁንም በሃያኛው (20) መቶ ክፍለ ዘመን 2796 ነገደ ቋንቋ በእንግሊዝ በፈረንሣይ፣ በእሥፓኝ በአረብ በነዚህ በአራት ቋንቋ በአሳብ መገናኛ መሥመር ተሠብሥቦ ወደ አንድ ንግግረ ቋንቋ ለመጠቃለል የአራተኛውን ጊዜ ሊከፍትለት መቃረቡን ታረካዊ ዜና ያስረዳል ።

## የፊደል ፍጥረትና መሻሻል ።

የዛሬዪቱ ኢትዮጵያችን ቀድሞ ሰው ያልነበረባት ምድረ በዳ ስለነበረች የእብራይስጥ ንግግርና ሃያ አራት (24) ሣባዊ ፊደል በ4. 499. 994 , 806 ዓመተ ዓለም ወይም ከልደት በፊት በ3244 ዓመት ላይ በነገደ ካም ወራሚነት ተጀምሮ ኖረ ። በ4. 499. 995. 827 ዓመተ ዓለም ወይም ከልደት በፊት በ1327 ዓመት ላይ በዘመነ መንግሥት | አፄ ዘግዱር | ኢትዮጵያዊ አስተዳደር ዛሬ የምንገለገልበትን 175 አንድ መቶ ሰባ አምስት ግእዘ ፊደል ተተክቶ ሣባዊው ፊደል 1460 ዓመት አገልግሎ ተለወጠ ከዚያ ጊዜ ጀምሮ ግእዛዊ ንግግር (531+1327+1950 ዓ. ም.) በድምሩ 3808 ዓመት ከሣባ ሁለተኛ ሆኖ ሚያገለግል ኖረ ።

ሁለተኛ ከልደት በኋላ በ1253 ዓመተ ምሕረት በዘመነ መንግሥት | አፄ ይኩኖ አምላክ | ኢትዮጵያዊ አስተዳደር (9) የአማርኛ ሀረገ ፊደል ታክሎበት የኢትዮጵያ አሥራ ሰባት (17) ነገድ በሁለት መቶ አርባ አምስት (245) ተርታ ፊደል ተሻሽሎ ይሠራበታል ከ17ቱም ነገደ ቋንቋ አማርኛ ፤ ግእዝን በግዞት አኑሮ በመላ ኢትዮጵያ ልሣነ መንግሥት ሆኖ ተስፋፍቶ ይገኛል ።

እንግዲህ ትውልድ ትውልድን እንደሚያድሠው እንዲሁም ቋንቋ ቋንቋን ይለውጠዋል ያሻሽለዋል አቀድ ይሠጠዋል ስለዚህ ከ(245) ነገደ ኢትዮጵያ ፊደል ውስጥ 35ቱ ፊደሎች አንድ ዓይነት የድምጽ አወዳደቅ ሲኖራቸው ለሥራ ፈጽሞ አይረዱንም በኔ አስተያየት የማይጠቅም ምክንያት እንግበ መሄድ ተገቢ መስሎ አልታየኝም ።

ስለዚህ አማርኛ ከልደት በፊት በ1071 ዓመት በዘመነ መንግሥት አጼ (ጥኖተ) ሴም ኢትዮጵያዊ አስተዳዳር ከግእዝ ሁለተኛ ሆኖ ሲነገር የኖረ ሦስት ሺህ ኻያ አንድ (3021) ዓመት ያለው ጥሩ አንደበት የማይዝ ምሥጢረ ብዝ የሠመረ ነገደ ቋንቋችን ነው ።

# መግቢያ ።

የንግግር ክፍሎቹም ከ4.499.994.806 ዓመተ ዓለም ወይም ከልደት በፊት በ3244 ዓመት ጀምሮ የአማርኛ ሰዋስው ውስጠ ታዋቂነቱ በይፋ ሳይታወስ ኖረ እንደ ዚሁም በክፍለ አውሮፓም እንኳን ከ1650 ዓመተ ምሕረት ወዲህ ሲሆን በላቲን ፤ በዓረብ ፤ በ ግእዝ ፤ በአርመን ፤ በሕንድ ፤ በቻይና ፤ በጃፓን ፤ በኮርያ በጠቅላላው በስምንት (8) ነገደ ፌደል አገሮች ሁሉ በመሻሻያ አቅድ ተገለጸ ።

አማርኛ ከ1934 ዓመተ ምሕረት ወዲህ ዘመነ መንግሥት ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ ባስገኛቸው ኢትዮጵያውያን አማርኛችን የሰዋስው ስልት እንዳወጣለት ድርሰታዊ ዜና ይነግረናል ።



## አሥራ ሠባት (17) ነገደ ኢትዮጵያን ቋንቋ ፤




**መግለጫ**

ይህ (—) ወራጅ መሥመር የመንግሥት ያስተዳደር ልሣነ ቋንቋ አማርኛውን ያመለክታል

ይህ (...) ነጠብጣብ መሥመር 17ቱ ነገዶች አንዱ ካንዱ በአማርኛ ተነጋግሮ የእርሥ በርሥ ዝምድና ህብሮሽን ያሣያል

## የቋንቋ ጉጂነትና ጥቅም ።

እነሆ ሥረ ግዕዝ አማርኛ ቋንቋና ፊደል የአሥራሰባቱ ነገደ ኖኅ ልጆች የግል ባዕድ ያልሆነ የንግግርና የድርሠት መገናኛ መሆኑን እያወቁ አርቆና አርቅቆ ባለማሥተዋል በእምነት በፈሊጥ (ፖለቲካ) ጠንቅ ፤ የእራሳቸውን ፊደል ክብር በመንፈግ ባእዳን በሆኑት ላቲንና የ620 ዓ. ም. ዓረብኛ እምነትን በመልበሥ የእርሥ በርሥ ችግር አብቅለው ሢያጭዱ ፤ መከራን ደግሠው ሢጠጡ ፤ ነገደ መንግሥታቸውን ባለማሥተዋል እየናዱ በባእድ ሢሚንቆ ሢገነቡ ለመሠረተ ታሪካቸው ባለማሠብ ለባእዳን መግቢያና እጅ ለጠሩም ጫፍ እየሆኑ መኖራቸውን ትላንት በሆነው ታሪክ ታውቆአል ፡

ስለዚህ ደራሲው የሚመኘው ይህ ከጥንት እሥካጥንት በታሪክ የተሸጋገረልንን ወገን ያልተለያየባትን ኢትዮጵያ አገራችን በባእድ እምነት ሣንለያይ መልካችንን ባህላችንን ቋንቋችንን መገናኛ ሀረገ ፊደላችንን ህብረታችንን ለጋራ ፤ እምነታችንን ለግል መድበን ውበታችንን በሥነ ድርሠት እንድናሥጌጥ በህብረት እንድንጠብቀው ነው ፤ በእውነቱ አገር ከሌለ ባህለ ፊደል ካልተከበረ ሃይማኖት ብቻ ምክንያት ከሆነ ዶሮ በጅማትዋ እንደምትጫወት ይገመታል ።

ስለዚህ በውነቱ ሀይማኖት ማለት ሀገር ነው ፤ ሀገር ከሌለ ሀይማኖትም ሊያከብሩት እራስና ባሕል ፤ ሥነ ጽሑፍም ሊከበሩ አለመቻሉን መተባበር ፤ የሥልጣኔ በር መሆኑን እንወቅ ።

## የነገደ ኢትዮጵያውያን ፊደል ።

## Anethiopian Characters

| | (ሀa) | | | | | (ለb) | | | (መc) | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| (1) | ሀ | ሐ | ኀ | Ha | (5) ረ | Re | (9) | ተ | | Te |
| | ሁ | ሑ | ኁ | Hu | ሩ | ru | | ቱ | | tu |
| | ሂ | ሒ | ኂ | Hi | ሪ | ri | | ቲ | | ti |
| | ሃ | ሓ | ኃ | Ha | ራ | ra | | ታ | | ta |
| | ሄ | ሔ | ኄ | He | ሬ | re | | ቴ | | té |
| | ህ | ሕ | ኅ | He | ር | rh | | ት | | th |
| | ሆ | ሖ | ኆ | Ho | ሮ | ro | | ቶ | | to |
| (2) | ለ | | | le | (6) ፨ ሸ | sch | (10) ፨ | ቸ | | ch |
| | ሉ | | | lu | ሹ | shu | | ቹ | | chu |
| | ሊ | | | li | ሺ | shi | | ቺ | | chi |
| | ላ | | | la | ሻ | sha | | ቻ | | chia |
| | ሌ | | | lé | ሼ | she | | ቼ | | che |
| | ል | | | lh | ሽ | sh | | ች | | chih |
| | ሎ | | | lo | ሾ | sho | | ቾ | | chio |
| (3) | መ | | | me | (7) ቀ | Ke | (11) | ነ | | ne |
| | ሙ | | | mu | ቁ | Ku | | ኑ | | nu |
| | ሚ | | | mi | ቂ | Ki | | ኒ | | ni |
| | ማ | | | ma | ቃ | Ka | | ና | | na |
| | ሜ | | | mé | ቄ | Ke | | ኔ | | né |
| | ም | | | mh | ቅ | Kh | | ን | | nh |
| | ሞ | | | mo | ቆ | Ko | | ኖ | | no |
| (4) | ሠ | ሰ | | se | (8) በ | be | (12) ፨ | ኘ | | gn |
| | ሡ | ሱ | | su | ቡ | bu | | ኙ | | gnu |
| | ሢ | ሲ | | si | ቢ | bi | | ኚ | | gni |
| | ሣ | ሳ | | sa | ባ | ba | | ኛ | | gna |
| | ሤ | ሴ | | sé | ቤ | be | | ኜ | | gné |
| | ሥ | ስ | | sih | ብ | bh | | ኝ | | gnh |
| | ሦ | ሶ | | so | ቦ | bo | | ኞ | | gno |

| | | | |
|---|---|---|---|
| (13) | አ | ዐ | a |
| | ኡ | ዑ | Uh |
| | ኢ | ዒ | Ei |
| | ኣ | ዓ | a |
| | ኤ | ዔ | e |
| | እ | ዕ | eh |
| | ኦ | ዖ | uo |
| (14) ፨ | ኧ | | he |
| (15) | ከ | | que |
| | ኩ | | qu |
| | ኪ | | qui |
| | ካ | | qa |
| | ኬ | | qué |
| | ክ | | guih |
| | ኮ | | quo |
| (16) ፨ | ኸ | | heh |
| | ኹ | | huh |
| | ኺ | | hih |
| | ኻ | | hah |
| | ኼ | | héh |
| | ኽ | | hieh |
| | ኾ | | hoh |
| (17) | ወ | | Wh |
| | ዉ | | Wuh |
| | ዊ | | We |
| | ዋ | | wua |
| | ዌ | | Wue |
| | ው | | Whi |
| | ዎ | | wo |

| | | |
|---|---|---|
| (18) | ዘ | ze |
| | ዙ | zoo |
| | ዚ | zi |
| | ዛ | za |
| | ዜ | zé |
| | ዝ | zhih |
| | ዞ | zo |
| (19) | ዠ | je |
| | ዡ | ju |
| | ዢ | ji |
| | ዣ | ja |
| | ዤ | jé |
| | ዥ | jih |
| | ዦ | jo |
| (20) | የ | ye |
| | ዩ | you |
| | ዪ | yi |
| | ያ | ya |
| | ዬ | yé |
| | ይ | yih |
| | ዮ | yo |
| (21) | ደ | de |
| | ዱ | du |
| | ዲ | di |
| | ዳ | da |
| | ዴ | dé |
| | ድ | deh |
| | ዶ | do |
| (22 ፨ | ጀ | gde |
| | ጁ | gdu |
| | ጂ | gy |
| | ጃ | gya |
| | ጄ | gyie |
| | ጅ | gdhe |
| | ጆ | gyo |

| | | | |
|---|---|---|---|
| (23) ፨ | ገ | | gh |
| | ጉ | | gu |
| | ጊ | | ghi |
| | ጋ | | ga |
| | ጌ | | ghe |
| | ግ | | ghih |
| | ጎ | | go |
| (24, ፨ | ጠ | | th |
| | ጡ | | thu |
| | ጢ | | thih |
| | ጣ | | thah |
| | ጤ | | theh |
| | ጥ | | teh |
| | ጦ | | toh |
| (25) ፨ | ጨ | | ch |
| | ጩ | | chu |
| | ጪ | | chi |
| | ጫ | | cha |
| | ጬ | | chie |
| | ጭ | | chh |
| | ጮ | | chio |
| (26) | ጰ | | peh |
| | ጱ | | puh |
| | ጲ | | pih |
| | ጳ | | pah |
| | ጴ | | peyh |
| | ጵ | | péh |
| | ጶ | | poh |
| (27) | ፀ | ጸ | th |
| | ፁ | ጹ | thu |
| | ፂ | ጺ | thy |
| | ፃ | ጻ | tha |
| | ፄ | ጼ | thie |
| | ፅ | ጽ | thh |
| | ፆ | ጾ | thoh |

| | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|
| (28) | ፈ | fe | (29) | ፐ | pe | (30) | ቨ | ve |
| | ፉ | fu | | ፑ | pu | | ቩ | vu |
| | ፊ | fi | | ፒ | pi | | ቪ | vi |
| | ፋ | fa | | ፓ | pa | | ቫ | va |
| | ፌ | fie | | ፔ | pie | | ቬ | vie |
| | ፍ | fh | | ፕ | peh | | ቭ | vh |
| | ፎ | fo | | ፖ | po | | ቮ | vo |

እነሆ ይህ ፡፡ ጥቅሥ ሀያል የተመለከተባቸው ፊደሎች በ1253 ዓ ም የተጨመሩ ናቸው ።

## የላቲን ፊደልና አኃዝ

A B C D E F G H J K L M N

O P Q R S T U V W X Y Z

1 2 3 4 5 6 7 8 9 0

10 20 30 40 50 60 70 80 90 100

## ሥርአተ ነጥብ ።

| | | | |
|---|---|---|---|
| ይህ | ፣ ሁለት ነቁጥ የቃላት መግቻ ። | ነጥብ | ይሠኛል |
| ይህ | ፥ ሁለት ነቁጥና ከመሃል ሠረዝ የንኡሥ ንግግር መግቻ | ንጥልሠረዝ | —»— |
| ይህ | ፦ ሁለት ነቁጥና ከላይናታች ሠ\|የከፍተኛ ንግግር መግቻ ሆኖ ማረፊያና መቀጠያ ነው | ድርብሠረዝ | —፡፡— |
| ይህ | ። አራት ነቍጥ የሙሉ ንግግር መግቻ | ነ ጥ ብ | —፡፡— |
| ይህ | . አንድ ነቍጥ የቃላት ማሠሪያና መለያ | ይ ዘ ት | —፡፡— |
| ይህ | ... ብዛቱ ልቅ የሆነ ነቍጥ የጅምርና የይቀጥላል ገላጭ | ነጠብጣብ | —፡፡— |
| ይህ | «—» አራት ጭረት | ጥ ቅ ሥ | —፡፡— |
| ይህ | ( ) ሁለት ተቃራኒ ክብ የግድፈት አጥር | ቅ ን ፍ | —፡፡— |
| ይህ | ? ከዘራና ከግርጌው አንድ ነቍጥ ሚታይ | መጠይቅ | —፡፡— |

|ይህ| ! በርቀት መሠረት ተንጠልጥሎ ሚታይ |ድ ን ቅ| ይሠኛል

|ይህ| ¡ ከራሥጌ በርቀት ላይ የሚታይ ይዘት ሚታይ |ሥ ላ ቅ| —።—

|ይህ| — ግዳም ሠረዝ ቅደም ተከተል ግሥገሣ መለያ |ሚ ራ ክ| —።—

|ይህ|

ሀ←«»→ሀ በፊደልና ፊደል መሀል የሚታየው ባዶ ርቀት |ሆ ህ ት| —።—

በ

|ይህ| ↕ በፊደል ውሥጥ ከላይና ታች የሚታየው ባዶ ሥፍራ |ማ ፀን| —።—

ሀ

## ስርዓተ ድርሰት ።

ድርሰት በመላ ዓለም በዓይን የታየ በጀሮ የተሰማ በሕሊና የታሰበ ጠቅላላ ስሜት የሚያመነጨውና በስምንቱ የንግግር ሰዋስው የሚገለጽበት ታላቅ ጥበብ ነው ።

እነሆ ወደሥርዓተ ድርሰት ከመቅረብ በፊት በቅድሚያ ልናውቀው የሚገባ አቅድ ለጥቆ ይገኛል ። ለምሳሌ ፤

(1) ቅጽ ማደራጀት

(2) ገጽ መመደብ

(3) ሲራክ መዘርጋት

(4) አምድ መፈለም

(5) ኅላፍ አርእስት ህዳግ መመጠን ሲሆን ሥእሉን በማየት አጥንቶ መዘጋጀት ተቀዳሚ ምክንያት ሆኖ ይታያል ።

## ሥርዓተ ቅጽ ።




ቅጽ ይሰኛል አንዱ ቅጠል ወይም ሉክ ወረቀት አራት ገጽ ይኖረዋል ።




ቅጠል ይሰኛል የአንዱ ቅጽ ወይም ሉክ ገሚስ ስለሆነ ከፊትና ጀርባው ሁለት ገጽ ይኖረዋል ።




ገጽ ይሠኛል የአንዱ ቅፅ ወይም ሉክ ግራና ቀኝ ተገልጾ በሥተጫፍ የሚታየው ቁጥር ነው ።




ሚራክ ይሠኛል ከመሀል ግራና ቀኝ ተሠምሮ የሚታየው ነው ።




አምድ ይሰኛል ይሀም በጋዜጣ ወይም በመጻሕፍት ሐሳብ ሲደረደር በሁለቱ መሐል የሚተወው ኅላፍ ባዶውን ሥፍራ ነው ።




1. የድርሰቱ ሰሜን አርእስት ።
2. የድርሰቱ ደቡብ ህዳግ ።
3. የድርሰቱ ምዕራብ ምሥራቅ ህላፍ
4. የድርሰቱ መሐል ክብ ምክንያት ነው

## ድርሰተ ተፈጥሮ ።

ድርሠተ ተፈጥሮ በሁለት አርእስተ አንቀጽ ተመድቦ ይነገራል ይኸውም ቀኔና ንባበ ድርሰት ሆኖ ይገኛል ቀኔ ልዩ መልክ የሚከተል ግጥም ተጠቅሎ የሚጠራበት ነው ይህም በትምህርት እገዛ የሚለገሥ ሣይሆን በመለኮተ ጸጋ የሚገኝ ሀብተ ስጦታ ነው በዚህ ዕድል የተገለገሉትን እነያሬድን ያሳስበናል ።

፪ኛው ንባበ ድርሰት የግጥም ባሕልና መልክ የማይከተል አገልግሎቱም የጽሑፍ ዓይነት የሚጠቀልል ከድርሰት ተፈጥሮ ታላቅ አርዕስተ ክፍል ነው ፤ ይህም በብዙ ምድብ የተተነተነ ሆኖ ይገኛል ።

## ንባበ ድርሰት ትንታኔ ።

ንባበ ድርሰት በሦስት ዓቢየ አርዕስት ተመድቦ እንደገና በአምስት ንዑሰ አገባብ ተከታትሎ ይታያል ለምሳሌ ።




ተብሎ ሥርዓት ተደንግጎለታል እነሆ በዚህ ምዳቤ በዓይን የታየ ፤ በጆሮ የተሰማ ፣ በሕሊና እየታሰበ ለሚገለጽ ለምሳሌ መራራን በማር ሸፍኖ ማጉረስ የአካሚው ስልተ ሞያ እንደመሆኑ መጠን እንዲሁም አስተማሪ ፣ ለተማሪው ዘርዝሮና ገልጾ መግለጫ ለመስጠት ድርሰቱም ልክ እንደሰው ጠባይ የተለያየ ባሕል ይዞ መገኘቱን ገልጾ ማስረዳት ይገባዋል ከዚህ ቀጥሎ ያለውንጠባየ ድርሰት እናጥና ለምሳሌ

ተራ ድርሰት ።
ቃላት ስክ ድርሠት
ተመሳሳይ ድርሰት
ውስጠ ዘ ድርሰት
ትርጉመ ድርሠት እየተሠኘ የሚነገር ባሕል ፈጥሮ

ይከታተላል ።

ል ም ም ድ

ግጥም ድርሰት ።

ግጥመ ድርሰት በሁለት መልክ ተደርድሮ ስሜትን ያረካል ፣ ለምሳሌ የመድረሻ ፊደል ተመሳሳይ ሆኖ ሲገጥም ስሜቱ (ስኬቱ) ያማረ ሆኖ ይገኛል ለምሳሌ

ለዘመነ መንግሥት ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ ንጉሠ ነገሥት የተደረገ ሙገሳዊ ግጥም

ዕድል ባንተ ሆነች ማግኘትም መራመድ - ድ
ትምህርትን በመምራት ነፃነት በመውደድ - ድ
ላገርህ የደከምክ ነፃነት መሥራች — ች
ዕድልህ ዕውቀትን በሯን ከፈተች — ች
ድርጅተ መልካም ሰፊው ታሪክህ — ህ
ከነገሥታት ሁሉ ታላቅ መሪነህ — ህ
እድሜህን አርዝሞ ፈጣሪ ይርዳህ — ህ

በስም ለበስ ከነጋ ድራስ ተሰማ እሸቴ የተነገረ ፡፡

እናንተ ጠቢባኖች ረቢ ሥራ ሥሩ — ሩ
እናንት ገበሬዎች በፊት ተማከሩ — ሩ
አረም እንክርዳዱን ሢናር እንዳትዘሩ — ሩ
ጊዜ ሲመረምር በኋላ እንዳታፍሩ — ሩ

※

ጋብቻ ወለም ዘለም እያለ ስለአስቸገረ
የተገጠመ ግጥም እንይ ፡፡

ጌጥም የሚደምቀው ፤ ልብስም የሚሞቀው — ው
ዓለም የሚያደምቀው ፤ ጥርስም የሚስቀው — ው
ጋብቻ ይከበር ወጣቱም ይወቀው — ው

※

ታላቅ ምሥጢር ነበር የተጫወት ነው
ዘርዝሮ መንዝሮ ያወጣው ማነው
ከንፈርሽን ታዘብኩት ለብዙ ሳምነው ፡፡
ዕቃ ከቤት ሞልቶ ሔድህ ውሰት ተራ
እየው አፈሰሰ የሰዎችን እንሥራ ፡፡

ዜማ ምክር ፡፡

ጽድቅና ኩነኔ ቢኖርም ባይኖርም
ከክፋት ደግነት ሳይሻል አይቀርም ፡፡
ከደብተራ ከጠበቃ ከሚሰኛ አሮጊት ፤ አታድርገኝ ጐረቤት

※

ደራሲው በአባቱ መሞት ያዘጋጀው

ዜማ ኀዘን ፡፡

አባት መከታ ነው ለዚህ ዓለም ኑሮ
እናት መድኃኒት ነች ለሆድ ለጉሮሮ ፡፡

ሁለቱን የያዘ ደግ አባት ነበረኝ
ሞት ቆራጥ አርበኛ ነጥቆ ወሰደብኝ ።
እንደቀድሞ እንሁን ተው አንለያይ
አባት አይጨክንም በልጆቹ ላይ ።
ስቸገር ረዳቴ ሐኪም መድኃኒቴ
ሲጠማኝ ጠጄ ነህ ሲርበኝ ፍትፍቴ ።
ክብሬ ከሞትክ ቀረ አንተ ሰውነቴ ።
ጠቅላላው አሳብህ ልማዴ ሲቀር
ሀዘኔ ብርቱ ነው ልቅሶዬ መሪር ።
ላልቅስ ተንሠቅስቄ ልቤን ላስጨንቅ
ተፈታ ንብረቴ ገበያው ሲደምቅ ።
ጠበቃዬ ቀረ እንግዴህ ተረታሁ
እጆቼ ታሠሩ ዋስ ጠበቃ አጣሁ
ደስታዬ በርዶአል ወዳንተ እስከመጣሁ ።

## ታሪካዊ ድርሰት ።

ታሪካዊ ድርሠት በተራ አማረኛ የሚጻፍ ሲሆን በዐይን የታየ በጆሮ የተገበየ መልኩ ስሜትን ሳይነካ እንደታየ እንደተሰማ ጥሬውን የሚገልጽበት ሥልት ነው ።

ለምሳሌ ገናናው ንጉሠ ነገሥታችን ግርማዊ ቀ. ኃ. ሥ. ሚያዝያ ፳፯ ቀን ፲፱፻፴፫ ዓ. ም. በዕለት ሠኞ ከቀትር በፊት ልክ አምስት ሰዓት ሲሆን ታላቅ ድል በተጐናጸፈ ግርማ መናገሻ ከተማቸው አዲስ አበባ ገቡ ።

አቤት የዛን ለታ ምድርና ሰማይ ዋሉ በዕልልታ ተራሮችም ሳቁ ወንዞችም ተመሙ ‹‹እኔም የዚያን ቀን በዝናም ራስኩኝ ለዕለት ምስክር እዛው ነበርኩኝ › እነሆ እንዚህን የመሳሰለው ታሪክ በዚህ ዐይነት ይመራል ከዚህ ቀጥለን ገላጭ ድርሰት እንመልከት ።

## ገላጭ ድርሠት ።

ገላጭድርሠት በዐይነት በስልት በባህል አርዕስቱ በሥዕል ቃላት ሆኖ ለህሊና የቀረበውን ጥየቃዊ መልስ ( ማን ፤ ምን ፤ ዬት ፤ ምንጊዜ ፤ እንዴት ፤ ለምን ፤ ) እየተሰኘ በሚነገር መጠይቀ ቃላት የሚጻፍ ስለሆነ ገላጭ ድርሠት የሚል ሥያሜ ተቀበለ ለምሳሌ ከዚህ በጥቂቱ ስለ አንድ ሰው ሁኔታ ለመግለጽ ብናስብ ።

ሰውዬው ማን እንደሆነ ? ፤ በዬት እንደሚገኝ ? ፤ ስንት መለያልዮች እንዳሉት ? በውስጡም የሚገኙት ያገልግሎት ጣቢያዎች ምን ያህል እንደሆኑ ? ፤ ምንጊዜ እንደሚዘጋጁ ? ፤ ለማንኛው ዐይነት ግልገላ እንደ ተፈጠረ ? ሥርዓት ባስከተለ ሁኔታ ተጠቅሶ የተጻፈ እንደሆነ ገላጭ ድርሠት ተብሎ ይነገራል ከዚህ ቀጥሎ ስለ ራዕየ ድርሠት እናጥና ።

## ራዕየ ( ልበወለድ ) ድርሠት

ልበ ወለድ ወይም ራዕየ ድርሠት የማይዳሰስ አርእስቱ በአሳብ ህሊና እየታየ በልብ ፈጠራነት መልክ የሚጻፍ ነው ። ለምሳሌ ስለ ሕዝብ ሁኔታ ብንመለከት የሕዝብ የህሊና ድካም ፤ የእምነት ፤ ጉድለት ፤ ያስተዳደር ሥህተት ፤ የፈሊጡ ጠማማነት ( ፖለቲካው ) በተዘዋዋሪ ስልት ለማስገንዘብ የሚያበቃ ጥበብ ነው ።

ለምሳሌ ለባዊነትና ነባቢነት ያለው ፍጡር ፤ የስኅተቱን ሽኛ በቀጥታ ሊነኩበት ስለማይወድ እንደዚህ የመሰለውን ደፈራ ንግግር ፤ እንደ አሞት መራራ ሆኖ ይታ የዋል ።

ሥለዚህ መራራን በማር ሸፍኖ ማጉረስ የወጌሻው ሥልተ ባህል እንደመሆኑ መጠን „የእናት መካሪ አያጥፋ ፈጣሪ" እንደሚባለው ፤ ሠምና ወርቅ ፤ ምርቅና ማር ሥለሚያሥገነዝበን ልብ ወለድ መከሪ ተብሎ በመከራና በሠላም የሚያገለግል የሥነ ጽሁፍ ዋናው ክፍል ነው ለምሳሌ በዜማ ሥልት ህዛዊ ቤዞች ባገር ቤት ጌቶች

አንድ ሰው አሥቦ አንድ በሬ ሥቦ
ያንድ በሬ እሸት ያንድ ላም ወተት ።
እሥኪደርሥ ድረሥ መቼ ይቀርና
መቀጥቀጥ በዱላ
ሡርፌ ቢለግም ቅቤ አይወጋም ።
በማግኘት ደስታ እንደማትገኝ
በታሪክም ሆነ በእድሜም አልመኝ ።
የናት አገር ቀሚስ ያባት አገር ሸማ
ነጠላ አይደለምወይ የሰው አገሩማ
አንተም ተው አንተም ተው የሚል ዳኛ ታጥቶ
በሬውን ወሠደው ከቀንበሩ ፈትቶ ።

እነሆ እነዚህ የመሣሠል ሁሉ የሚገለጽበት አቅድ ነው ከዚህ ቀጥሎ ከብዙ በጥ ቂቱ ስለ ሀተታዊ ድርሠት እንመልከት ።

## አተታዊ ድርሠት (እታቶ) ።

አተታዊ ወይም እተታ ድርሰት በብዙ ሁኔታ ሊታተት ይችላል ለምሳሌ ስለ አለም ብንመለከት ።

ፀጥታና ሠላም በአለም ላይ ጠፋ ፣ ጽድቅና ፍርድ ወደቀ ፡ ትክክለኛነትና ዳኝ ነት ከቁም ነገር ጋር ተቀበረ ፡ ጠንካራ ደካማን በሥልጣን ቀንበሩ አግብቶ መነገጃ አደረገው ።

ስለዚህ ጆሮ የተከለ ይሠማል አይን የፈጠረ ያያል አለማለት ያሥደንቃል ፤ እነሆ እነዚህ የመሣሠሉት ሁሉ ወደዚህ ሥልት ይጠቃለላሉ ፤ ከዚህ ቀጥለን ስለ ሁኔታዊ እታቶ ድርሰት እናጥና ።

## ሁኔታዊ ድርሰት ።

ሁኔታዊ ወይም ድርሠተ ሁኔታ ንግግር (ድሥኩራ) ለማድረግ የምንገለገልበት አቅድ ነው ስለዚህ የአድማጮችን ህሊና የሚማርክ ጣእመ ልሣን ፤ ሥሜታቸውን የሚበዘብዝና ፍጹም በሆነ ተመሥጦ የሚገዛ እንደእንቁ የከበሩ አሣቦች የጠለቁ አሥተያየቶችን ለማበርከት በሁኔታዊ ድርሠት ማለፍ እጅግ ውበትና ግርማ ይኖረ ዋል ለምሳሌ በሥብሠባ ንግግር ሢደረግ እንደሚታየው ይመሥላል ።

ክቡራን ሆይ ።

ከሁሉ አስቀድሜ ለእናንተ ምቾት በሌለበት ሥአት ስለ አገራችን ጉዳይ፤ በጣም አሥጊ የሆነውን ሁኔታ እንድገልጽላችሁ ይህን እድል ስለሠጣችሁኝ ከፍ ያለ የደ ስታ ሥሜቴን አስቀድማለሁ ።

እነሆ ስለአገራችን ሠላምና ኑሮ የምንደግፈውና የምንሠራው ሠፊ የሆነ ምኞት እንደመኖሩ መጠን ፤ የሌላውም አገር ሠላም የሚተማመንበትን ለማረጋገጥ የአለም አላፊነት ያለበት ጉዳይ አለ ።

ይኸውም . . . . በጣም አሣሣቢ የሆነ ሁኔታ ስለሆነ አሁኑኑ ልገልጽላችሁ እወዳለሁ ጉዳዩም ከመዘርዘሬ በፊት እኛ በአለም ምክንያት ውስጥ በትክክለኛነት ለሚመሠረት ሰላም የምንሠራው ውዴታና ግዴታዊ ተግባር እንዳለብን ማስታወስ ይጠቅማል ።

ይኸውም ሠላም በአንድ አገር ብቻ ተወስኖ እንዳይኖርና ለመላው አገር ህዝብ እንዲሆን ነው ።

ወ ይ ም ።

እናንት የተከበራችሁ ጀግኖች ሆይ ።

የኃይል ዋጋ ፍቅር መሆኑን አውቃችሁ ፤ የገንዘብን መውደድ ጥቂት እንኳ ዋን ዋጋ ሣትሠጡት ፤ ድንጋይን የምታደቁ ተራራን የምታፈርሡ ወንዝን የምታደ ርቁ ፤ መቼም መቼም የማትደፈሩ ጀግኖች !! እጣዬ ከናንተ ጋር በመዋሉ እድሌን አመሠግንዋለሁ ። እነሆ እነዚህ የመሣሠሉት ሢሆን ከዚህ ቀጥለን ምዙን ድርሠት እናጥና ።

## ም ዙ ነ ድ ር ሠ ት ።

ምዙን ድርሠት አምሥት አይነት ምድብ የተከተለ ነው ለምሣሌ በተራ በቃ ላት ድርደራ ፤ በተመሣሣይ ቃላት ፤ በወደረ ሥልት በቃላት ትውልድ በሁለትና ሦሥት ወይም ብዙ ልማዶች የሚወዳደርበትና ተጠቃሎ የሚነገርበት አቅድ ነው ለምሣሌ በተራ ድርሠት ፤ ባህሪው ተራ ማንም የሚናገረው ና የሚጽፈውን ጠባይ ይከተላል እነሆ "ህዝብና ህዝብ ደጋና ቆላ ናቸው ፤ መንግሥተ ግን ገበያ ስለሆነ ሁሉንም ያቀርባቸዋል ፤ መሪ ምሠሦ ነው ።

ሠራዊት ግድግዳ ፤ መኳንንት ማገር ነው
መተሣሠብማ ማሠርያ ሀረግ ነው ።
እንግዲህ አንርሣ የነዚህን ውለታ ፥

በቃላት ድርድር ሲዘጋጅ እንዲህ ይፈጸማል ሥልቱም ቃላት እየተካከበ የሚገለጽበት ባህሪ ሲሆን ሞያው ጥፍጥ ሆኖ ሥሚትን ማራኪ ነው፤ ለምሣሌ አባቶቻችንን ይህንን የመሠለ አሠቃቂ ገድል በመፈጸም መከራን ታግሠው ለኛ ለተወላጆቻቸው ሠላምና ኑሮ የጣመ የጣፈጠ ፤ የረቀቀ የጠለቀ ።እንደታላቅ በረከት የሚቆጠር አሥደናቂና አሥገራሚ ነፃነታችንን ከጥንት እሥከጥንት መሥርተው ሥላቆዩን ገድላቸው በትውልድ ህውልት እንዲሸጋገር የሁሉም ድርሻ መሆኑን እመኛለሁ ።

አሁንማ በኛ ዘመን ኢትዮጵያችን አቋቋምዋ ፤ አረማመድዋ አካሄድዋ አሥተያየትዋ ሁሉ የማንንም ሥሜት እንደማረከ ነው ፤ እነሆ እንዲህ በመሣሠል ድርደራ ሚገለጽ ሥሜትን ይማርካል ከዚህ ቀጥለን በተመሣሣይ ድርደራ እንመልከት በተመሣይ ቃላት ። ትርጉአሜው በሚመሥል ምሠጣ እንደሥሜቱ መልክ እየተነገረ ሚፃፍ የሁኔታው ውበት ይመሥጣል ። ለምሣሌ ።

ወይዘሮ ውብአለም በቡቃያነትዋ ፤ በጫርቁዋነትዋ ፤ በለጋነትዋ ፤ በቡቃያነትዋ በአፍላነትዋ በልጅነትዋ በወጣትነትዋ ። ተቀጨች ። እነሆ ይህንን በመሣሠል ተመሥሎ ሚዘጋጅ ምሣሌን አሣማሪ ሆኖ ይገኛል ። ከዚህ ቀጥለን ሥለ ወደረ ድርሠት እንመልከት ።

በወደረ ድርሠት ፤ ጐበዝን በአንበሣ ፤ ፈሪን በጅብ ፤ ሠነፍን ባህያ ፤ መለሎን፤ በዝግባ፤ ሽንቅጥን በሀረግ ፤ ጣትን በአለንጋ ፤ አፍንጫን በሥንደዶ ፤ ጥርሥን በበረዶ ፀጉርን በሀር ፤ ደረት ፤ በአንበሣ ፤ ጡትን በነብር ፥ እየተመሠለ ሚጻፍ ለሠሚው ፍትፍትና መሣጭ ሆኖ ይገኛል ለምሣሌ ።

ቀድሞም ባያትህ ፤ ሁዋላም ባባትህ
ሙተህላታል ፤ ለዚች አገርህ
አሁንም በተራህ እንዳባቶችህ
የደም ግብርህን መክፈል አለብህ ።
የገጠርን ትዳር እሥቲ ቀመሣት
የፈሪ አገርናት እንዳታሠኛት ።

እነሆ እነዚህና በመሣሠሉት መልክ ሚዘጋጅ ጣፋጭ ሆኖ ይገኛል እነሆ ከዚህ ቀጥለን ከብዙ በጥቂቱ ሥለ ቃላት ትውልድ ድርሠት እንመልከት ። ቃላት ትውልድ ፤ ቃላት ልክ እንደፍጡራን ሁሉ እርባታዊ ትውልድ አለው ወደፊት በዚሁ መጽሀፍ ሠዋሥው ውሥጥ ተጽፎ ይገኛል ሥለዚህ ለምናቀርበው ድርሠት ምሥጋና እንዲኖረው ለምሣሌ መዝራት የሚለው ግሥ ብንከተል ትውልደ

ቃላቱ እንደሚታየው ይሆናል ። ለምሣሌ መገርጣት መድረቅ መታጨድ እነዚህና የሚመሥሉትም በአረፍተነገር ብናውለው ጣፋጭ ሥሜት አሥከታይ ሆኖ ይገኛል እነሆ ለምሣሌ ።

ወይዘሮ ውብአለም የእናትዋ ሞት አገርጥቶ ፤ የልጅዋ ሞት አድርቆ ፤ የባልዋ ሞት አጨዳት ። እነሆ እነዚህን በመሣሠለ ሁኔታ ከተመራ ጥፍጥ ሆኖ ይገኛል ፤ ከዚህ ቀጥሎ ሥለውሥጠ ወይራ ሥውር ንግግር እንመልከት ።

በሥውር ንግርት (ውሥጠ ወይራ) ሚነገር ለምሣሌ እንዲህ ይሆናል ፊት መንሣት ፤ እጅ መንሣት ፤ እጀረጅም እግርአውጣ እጅ አውጣ ዋጋውም ጥቂት ነው ሂደህ ልብ ግዛ በማጥበቅና ማላላት መማር እነሆ እነዚህ የመሣሠለ ሚነገር ጥልቅ ተመራማሪ የሆነ ሊገለገልበት ይችላል ከዚህ ቀጥሎ ዜማ ምሥጋና እንመልከት ።

## ዜማ ምሥጋና በክራር ።

ጭነት ካልመጣ ኩሮም ወደል ነው  
ዝናብ ካልመጣ ደረባም ቤት ነው  
ቀጣ ካልመጣ ሁሉም ጉበዝ ነው  
ሽምጥ ከሌለ ሁሉም ፈረሥ ነው  
ሁሉን የሚችል የንጉሥ ቤት ዱር ነው ።

## ዜማ በበገና ።

ጉድን ከዳቢቱ ተፍትፈህ ጥበሠው  
እሥኪባለ ሞቱን አያውቅምና ሠው ።

※

ቤቱ ከጉድጓዳ ያውም ከመንገድ  
ሥንቱን ሠው አየሁት ሚወጣ ሚወርድ ።

※

ቤታችሁ ቢሠወር ከአንግዳ ይተርፋል  
ዛሬሥ በኛ አደረ ነገ በናንት ያልፋል

※

ፈረሥ ነበረኝ እራሡን ያኩወራ  
ከጅራት የለውም ብዬ ሆዴ ፈራ ።

## ዜማ በመሠንቆ መዲና ።

የሰማይ የምድር ባለቤት  
ይገኛል አሉኝ ሁሉም ባንተ ቤት  
ታድን የለምወይ ገለህ  
ወልድ አብነት አለህ

※

በቀሎ ለምኚ ነብሴ ተዋረጂ
እባክሽ በግራ አትሒጂ

※

ትላንት የመጣህ መንገደኛ ፤ ጉሽ መጠጣትህን አናውቅም እኛ
ከላይ አዳይ ካልሰጠው ፤ ጥሮ አያገኝም ሰው

※

የጨዋ ልጅ ተዋረደ እንጨት ለቀማ ቆላ ወረደ
ሲያነደው ያድራል ሌቱን ቀን የሰበረውን

※

አንተ ውድማ ቀራተኛ ፤ ታስወስዳለህ ነቅተህ ተኛ
እህልህን ጠብቅ ምርትህን ፤ ያፍሰዋልና አትመን
ቢጠሩህም ከመንገድ ፤ አቤት ጌታ ብለህ ሒድ
የምትሚገት እንደሆን ፤ እኛም ዳኚ አይደለን

※

ቤተ ክህነት ስሜ ስወጣ ፤ ልብሴን ቀደደው ጋሬጣ
ክርና መርፌ፦ አገኘሁኝ ፤ ጠቃሚ ሰው አጣሁኝ
እነሆ ይህንን በሚመስል መልክ ይፈጸማል
ከዚህ ቀጥሎ ውለታ እንዳይረሳ እንመልከት

ውለታ አይረሣም ።

እነሆ ለመላ ዓለም የኑሮ ትግል ማሸነፊያ ጥበብ የተገኘው በጥቂት ሰዎች ጥረት ሲሆን ከነሡ በኋላ የተነሡት መሥራቾችን መሪ በማድረግና ከባድ ሥቃይም በተለምዶ ትእግስት በማለፍ መሆኑን ታሪክ ይነግረናል እነሆ ለዓለም ስልጣኔ ሻማ ከዚያም ብርሃን ሆነው ከተገኙት ታላላቅ ሰዎች እጠቅ ሳለሁ ለምሳሌ

| አሞራቢ ፤ ከ | እስከ | ዓመተ |
|---|---|---|

ዓለም ወይም ከልደት በፊት 2288 ዓመት ገደማ የነበረ የሕግ ጠበቃ ሆኖ መላ ዓለም ዛሬ የሚገለገልበትን ፤ የሥራ ፤ የሠራዊት ፤ የንግድ ፤ የአገዛዝ ሕግ የመሠረተ ታላቅ ሜዞፓታሚያ (ይራካዊ) ንጉሥ ነው ፤ ከመሠረታቸውም ህጐች እንዲህ ነበር (1) ግንበኛ የሠራውን ቤት ፈርሦ ከተሠራለት ቤተሠብ ዓይነት አንዱን ማለት ሎሌ ቢገድል የግንበኛው

ሎሌ ይሙት የሚል ነበረ ፣ (2) ሚሥት ለቤተሠብ ማስተዳደርያ የተቀበለችውን በጀት ሣታብቃቃ ቀርታ ቢያልቅ ቤተሰብ ጉዳች በሚለው ሕግ በባልዋ ፍርድ ብቻ ከባሕር ተጥላ ትሙት የሚል ነበር (3) ተበዳሪ በወቅት ችግር በጊዜው እዳውን ሣይከፍል ቢቀር አበዳሪው ገንዘብ ፤ በተገኘ ጊዜ ይቀበል የሚል ነበረ ፤ እነሆ ይህን የመሳሰለውን ጠቃሚ ድንጋጌ ጀምሮ በሥራ ላይ ውሎ ጥቅምና ጉዳቱ ከተመዘነ በኋላ እየተሻሻለ ከአንድ ፈራጅነት ወደ ሁለት ፈራጅነት ከዚያም በሦስት ሠው ከዚያም ወደ ጠቅላላ ጉባኤ እየነጠረ ይፈረድ ጀመረ በአሁኑም ዘመን በዚሁ ሕግ መሠረትነት በጠለቀ በነጠረ ባህረ አሣብ ተዘጋጅቶአል ነገር ግን ለእውነትና ለተፈጥሮ ነፃነት የሚፈርድ እሥካሁን አልተገኘም ያሉትም አንድ ሚሊዮነኛ ቢሆኑ ነው ።

ሙሴ ከ እሥከ ዓመተ ዓለም ማለት ከልደት በፊት 1300 አመት ላይ የነበረ የእውነት ጠበቃ ሆኖ ከፈርኦን መንጋጋ እሥራኤላውያንን ነፃ ያወጣ የእሥራኤል ሊቅ ነው ፤ ይህ መጽሐፍ ከተዘጋጀበት ዘመን 1950 ዓ. ም. ጋር ሢደመር 3250 ዓመት ይሆናል ፤ የዚህም ሠው ሞያ በመጽሐፍ ቅዱስ ሙሴ ባሕረ ኤርትራን በታምራት እንደተሻገረ ይነገርለታል ።

ዳዊት ከ እሥከ አመተ አለም ማለት ከልደት በፊት 1000 አመት ላይ የነበረ እሥራኤላዊ ብልህ ንጉሥ ነው ይህ መጽሐፍ ከተዘጋጀበት ዘመን ጋር ሢደመር 2950 አመት ነው ። ከ150 ዳዊት የልብ ቅንነት የተሠኘውን የፍልሥፍና መጽሐፍ የደረሰልን እሡ ነው ።

ሆሜር ዖዲሜ ከ እስከ አመተ አለም ማለት ከልደት በፊት 800 አመት ላይ የነበረ ታላቅ ዕርአዊ (ግሪክ) ደራሲ ፈላስፋ ነው ። ዘመኑም (800+1950)=2750 አመት ነው ።

ጉታማቡዲህ ከ እሥከ አመተ አለም ማለት ከልደት በፊት (543-623) አመት ላይ የነበረ በሩቅ ምሥራቅ ዛሬ የሚሠራበትን የቡዲህ እምነት የመሠረተ ሕንዳዊ ሊቅ ነው ዘመኑ (623+1950) 2573 አመት ነው ።

ቅዱስ ፓውሎስ በአዲስ ኪዳን ከአራቱ ወንጌላዊ አንዱ የኢየሱስ ክርስቶስ ዜና ደንግጎ በጽሑፍ ያሸጋገረልን ታላቅ ሊቅ ነው በ95 አመተ ምሕረት ላይ ሞተ ዘመኑ 1950 አመት ነው ።

ያሬድ ኢትዮጵያዊ በ515 አመተ ምሕረት ገዳማ የነበረ የቤተ ክርስቲያን ዜማ ያበረከተ እጅግ ተወዳጅ ሊቅ ነው ።

ገሬጉሪ    ከ540–602 አመተ ምሕረት ገደማ የነበረ የቀን መቁጠርያ ባሕረ አሚብ ያፈለቀ ታላቅ ዕርዓዊ (ክሪክ) ሊቅ ነው ዘመኑም 1410 አመት ነው ።

ማርቲን ሉተር    ከ 1483-1546 አመተ ምሕረት ገደማ የነበረ የእግዚአብሔር ሥልጣን ለአንድ ሰው ብቻ ተወስኖ አልተሠጠም በሚል ክርክር ፈጥሮ ከሮማ ካቶሊካዊት መቅደስ ተነጥሎ ከ40 አመት ክርክር በሁዋላ ፕሮቴስታንት ነትን እምነት የመሠረተ ታላቅ ጀርመናዊ ሊቅ ነው ። ዘመኑም 467ኛው ልደቱ እየከበረ በጉዞ ቀጥሎ ይገኛል ፤ ከነዚህ ሌላ የዛሬዪቱን አለም ዜና የእመገቡ በድሡሥና ረቂቅ ገቢር ክንድን አነባብሮ በደም ፤ በምግባር ፤ ነፃነትና መብትን ከበቂ ጥበብ ጋር አስከብሮ የዛሬዪቱን አለም ወደምት ገኝበት ደረጃ መድረስ የተቻለው በደራሚና ወታደር ዓይነተኛ ብርታት መሆኑ አይካድም ፤ በዚህ በሁአለኛው ዘመን የዓለም ብርሃን ከሆኑት ለምሣሌ እነሡስቴል ፤ ዳርዊን ፤ ላቧዚየር ፤ ማርኮኒ ፤ ኤኒሽታይን አይሁዳዊ ከነዚህ በመነጨው ጥበብ የሠው ልጅ የጠፈር ባለቤት ለመሆን ችሎ ይገኛል ።




ሰዋስው ማለት የንግግር መክፈቻ ሥርዐተ ጽሁፍ ማወቂያ ነው ።
እነሆ ጥበብን ለመገብየት ሥርዐተ ድርሠትና ባህልን ወደፊት ለማዝለቅ የንግግር ክፍሎች ከአፍላነት ለፍሬነት መብቀያ ሆኖ ሲታመስ ይኖር ዘንድ አቅድ ወጣለት ። ዝርዝር ሁኔታውን ቀጥለን እናጥና ።

| የአማርኛ ሠዋሥው ትርጉም ። | An Amharic grammer meaning | An English Grammer | በእንግሊዘኛ ትርጉም |
|---|---|---|---|
| የንግግር ክፍል | yenighighir kiffle | is apart of speach | ፓርት ዖፍ እሥፒች ይለኛል |
| ሥም | Sime | is a noun | ናውን • |
| ሥመ ምትክ | Simemitik | is a pronoun | ፕሮናውን » |
| ቅሰል (ሥም አክል) | Kitil | is an adjective | አድጀክቲብ › |
| ግሥ | Ghis | is a verb | ቨርብ › |
| ፍዘግሥ | Fize ghis | is an adverb | አድቨርብ › |
| መስተዋድድ | Mestewaded | is a preposition | ፕሬፖዚሺን » |
| መስተፃምር | Mestesamir | is a conjuction | ኮንጃንክሽን › |
| ቃለግን(ቃለአጋኖ) | kale ghine (agano) | is an Interjection | ይንቴርጀክሽን • |




## ሥም noun

ሥም ማለት መጠሪያ ሥያሜ ሢሆን በማነኛውም ፊደል መነሻ እየሆነ የሚለወጥ የሚበዛ የሠው ፤ የመንጋ ፤ የአዝርእት ፤ የአገር የግብር የነዚህንና የሌላም መጠሪያ ነው ለምሳሌ ፤

<u>ሠው</u> የአዳም ፍጡር ለሆነ ነባቢነትና ልባዊነት ፀጋ ላለው ዖታ ሣይ ለይ በንጥልና ህብር መጠሪያ ሥያሜ ነው ።

<u>መንጋ</u> የቤት እንሠሣና የዱር አራዊት ፍጡር ሀብተ ነባቢነትና ለባዊነት ለተመጠኑበት ግኡዛን ጾታና ቍጥር ሣይለይ መጠሪያ ሥያሜ ነው ።

<u>አዝርእት</u> የእህልና ተክል ዝሪት ግኡዝ ለሆነ የህብር ሥያሜው ነው ።

<u>አገር</u> አህጉር ለሆነ ሠውና ድሡሥ ፤ ግዛፍም ፍጡራን በህብረትም ሆነ በተናጠላ የሚኖሩበት መጠሪያ ነው ።

## ምድብ ስም midibe sime proper noun

| በአማርኛ ሠዋሠው ትርጉም | an Amharic grammer meaning | an English grammer meaning | በእንግሊዘኛ ሠዋስው ት ር ጉ ም | |
|---|---|---|---|---|
| ኢትዮጵያ | Ethiopia | Ethiopia | ኢትዮጵያ | |
| አዲስ አበባ | A. A | A. A | አ. አበባ | ይሠኛል |
| ቀበና | Kebena | Kebena district | ኬቤና ዲስትረክት | |
| ተፈሪ ፡ ዮሐንስ | Teferi Jonhans | Jon son | ጆንሠን | |
| ዝቋላ | ZiKuala | ZiKuala mountain | ዙካላ ማውንቴን | |
| አባይ | Abay | Nile river | ናይል | |

## ህብረ ስም Hibre sime Colleetive noun

| | | | | |
|---|---|---|---|---|
| ፍጥረት | Fitret | Creature | ክሪቸር | |
| ህዝብ | Hizb | People | ፒፕል | |
| መንጋ | Menga | Heared | ኸርድ | |
| ሠራዊት | Serawith | Army | አርሚ | ይሠኛል |
| አዝርእት | Azrehth | Crops | ክሮፕ | |
| ሥጋ | Siga | meat | ሚት | |
| አጥንት ፤ አንጀት | Athnth | Bon boll | በን በል | |

ጥቅመ ስም Tikme Sime Material noun

| | | | | |
|---|---|---|---|---|
| ሢኒ | Sini | Cup | ካፕ | |
| ጨው | Cheou | Salt | ሦልት | |
| ማር | Mar | Honey | ሆኔ | |
| ልብሥ | Libs | Swit | ሡት | |
| ቢለዋ | Bilawo | Knife | ናይፍ | ይሠኛል |
| ሥንዴ | Sinde | Wheat | ዊት | |
| መኪና | Mekina | Car | ካር | |

ግብረ ስም ghibre Sime Abstractive noun

| | | | | |
|---|---|---|---|---|
| ጥበብ | Tibeb | Art | አርት | |
| ብልሃት | Bilhat | Knolege | ኖሌጅ | |
| ልጅነት | Lidgyneth | Boy hood | ቦይ ሁድ | |
| ክፋት | Khfath | Hivil | ሂቪል | |
| ነብሥ | Nebs | Sol | ሦል | ይሠኛል |
| እድሜ | Edme | Age | ኤጅ | |
| ፍጥነት | Fithneth | Quiq | ኩይክ | |
| ድኸት | Dheth | Slow | ሥሎው | |
| ሀይል | Hail | Force | ፎርሥ | |

## ልምምድ ስም ።

ስም ብዙ አይነት ሊሆን ተራ ፤ ምድብ ፤ ግብረ ስምና ፤ ንብረት (ቁሳቁሥ) ስያሜ ፤ የሚከተል ሊሆን ከአየር ጣቢያ አምሥት ፤ ከእንሥሣ ፤ ትርኢት አሥር ፤ ከቤተ ሸቀጥ ሀያ ፤ ከትክልት ቦታ አምሥት ፤ ከማእድ ቤት አሥር ፤

(ሀ) ከቤተ ምግብ አሥር ይጻፍ ።

(ለ) ከዚህ ቀጥሎ በሚገኙት ስያሜ ወገንነታቸውን በመግለጽ ሕብረ ስም ይሠጥ ፤

(1) ላም (2) በግ (3) ቃለ እግዚአብሔር ሰሚ (4) ጅብ (5) መጽሐፍ (6) አሣ (7) ወታደር (8) መርከቢ በባህር (9) ንብ ፤

(መ) ከዚህ ቀጥሎ ከሚገኙት ወገነ ሥም የአይነቱ ስያሜ በመሥጠት ይለይ ፤

(1) ልጅ (2) ከተማ (3) ዮሀንስ (5) ሠራዊት (5) አለም (6) ምግብ ፤ (7) ጥንካሬ (7) መምህር (9) መንጋ (10) እውቀት (11) ቆብ ፤ (12) መጽሐፍ (13) ርዝመት (14) ጥቅም ፤

(ሠ) በነባር ነው ፤ አለ ፤ ነበረ ፤ ወይም ናቸው ፤ አለው ፤ አላቸው ፤ ነበሩ ፤ በሚለው ስያሜ ግሥ በመጠቀም እየተጻፈ ይገለጽ ፤

(1) በ . . . . ዓ. ም ከመንጋ . . . . . በጥቂት ገንዘብ ተሸጠ . . . . . .
(2) በአዲስ አበባ ቤተ ሸቀጥ ጣፋጭ ወይም በውድ ይሠጥ . . . . . .
(3) ቤተ ትምህርት ብዙ መጽሐፍትና ተማሪ . . . . . . . . .
(4) ምእመናኑ ቤተ እግዚአብሔር ትተው . . . . . . . . .
(5) በዚህ አዳራሽ የሚፈጸመው ሥብሠባ ብዙ . . . . . . . .
(6) አሥተዳዳሪው ከተማውን ጐብኝተው . . . . . . .
(7) አንድ ግራም እድል ከብዙ ብልሃት የሚበልጥ . . . . .
(8) ከዋክብቶች አሥደናቂ መልክ . . . . . . . . . . .
(9) ንቦች ብልሆች ሥለሆኑ በአጥር ላይ ሠፍረው ይጮኹ . . . . . . .

(ረ) ለንግግር የምንጠቀምበት ከሚከተሉት ግብረ ሥም ይመሥረት ፤

ህፃን ፤ ሎሌ ፤ ዳኛ ፤ ጠላት ፤ ፈሪ ፤ ጓደኛ ፤ ወንድ ፤ መርከቢ ፤ ሙዚቃ እሣት ፤ ውሻ ፤ መጽሐፍ ፤ አንበሣ ፤ ንጉሥ ፤ አበባ ባህር ፤ ኢትዮጵያ ፤

(ሸ) የሚከተሉት ግብረ አበር ወይም ተመሣሣይ ስያሜ የማይለወጡ ሥለሆነ ለማሣየት በአረፍተ ነገሮች ይገለጽ ።

እውቀትና ጥበብ ፤ እምቡጥና አበባ ፤ መንገድና ጐዳና ፤
እጥፍና ጥንድ ፤ እጅና ጡንቻ ፤ ውበትና ቁንጅና ፤
መሥክና ሜዳ ፤ ጣራና ወራጅ ፤ ሥብሠባና ተመልካች ፤
ትርኢትና ሥዕል ፤ ጣእምና ጣፋጭ ፤ ረቂቅና ርቅ ፤
ግፍና ተንኮል ፤ ተውሣክና ህመም ፤ ዜናና መግለጫ ፤
ጉዞና መንገድ ፤ ጨዋታና ልፍለፋ ።

(ቀ) በትርጓሜው ተቀራኒ ለሆኑ ሥያሜ ይሠጥ ፤

ደሥታ ፤ ነፃነት ፤ ፍጥነት ፤ ፍጥረት ክሥረት ፡ አርበኛ ማሸነፍ ፤ ወጣት ፤ ህመም ፤ ማዕበል ፤ ተሥፋ ቢሥ ፤

## ጾታ ( ወ ገ ን ) ። Gender

ጾታ ማለት በተፈጥሮ አቋማቸው ወንድነትና ሤትነትን ጠባይ የሚታይበቸው ሣይለይ በህብር መጠሪያ ሥያሜአቸው ወገን ሢሆን እነሆ ተለይቶም ሢነገር እንደሚቀጥለው ይሆናል ።

ወንዴ ጾታ ፡፡ ጠባዩ ወንዴ ለሆነና ጠቀሥ ድርጊት ሁሉ በጠቅላላው በሥያሜ መድረሻ (ነ) የሚነገርለት ሁሉ በዚሁ መልክ ተሠይሞ ይነገራል ።

ሤቴ ጾታ " ጠባየ ሤቴ ለሆነችና ጠቀሥ ድርጊት ሁሉ በጠቅላላው በሥያሜ መድረሻ "ች" የሚነገርላት ድርጊት ሁሉ ሤቴ ጾታ ሥያሜ ተብሎ ይነገራል ።

ተራ ጾታ " ጠባየ ወገን ፡ ከሁለት ሴትና ወንድ ለማይለይ አጓጓል (ፍናፍንት ጾታ) ለሆነ ተራ ጾታ ተብሎ ተሰይሞአል ።

ግዑዝ ጾታ " ጠባየ ድሡስና ስውር ለሆኑ ነገሮች መጠሪያ ሥያሜ ነው ፤

## Gender

In English there is no grammatical gender, but (natural gender) or the Expression of sex.

There are four genders:

masculine — is used for all males e. g.
father, brother, man, boy, uncle, nephew, husband, son, sir, horse, lion, bachelor, bull, host, etc.

By prefixing or — Suffixing, a word denoting the sex a mals,
grand father, land lord, he goat widower

Feminien — is used for all femals. e. g.
mother, sister, woman girl, aunt, wife, niece, daughter, madam, mare, spinister, cow, hostess, etc.

By prefixing or — Surffixing a Word denoting the sex as a femals.
grand mother, land lady, she goat, widow

Common — is used where the sex canot be told from the form of the word e. g.
friend cousin, parent, child, patent, relation, baby, person, servant, teacher, pupil, rate etc.

Neuter — is used for in animate objects e. g.

## ጾታ Sota is a Gender ጀንደር ።

| ወንዴ ጾታ | Wonde Sota is a | Masculin Gendere | ማሥኩሊን ጀንደር | |
|---|---|---|---|---|
| አባት | Abath | Father | ፋዘር | |
| ወንድም | Wondim | Brother | ብራዘር | |
| አጎት | Agot | Ancle | አንክል | |
| ጌታ | Gheta | Lord | ሎርድ | |
| አቶ | Ato | Mr | ሚስተር | |
| መምህር | Memhr | Teacher | ቲቸር | ይሠኛል |
| ወጠጤ | Wotete | Goat | ጎት | |
| ወይፈን | Woyfen | Bull | ቡል | |
| ሙክት | Mutcith | Goat | ጎት | |
| በሬ | Bere | Oxe | ዖክሥ | |
| ሎሌ | Lole | Employee | ኤምፕሎየር | |

| ሴቴ ጾታ | Sete Sota is a | Faminen Gender | ፊሚኒን ጀንደር | |
|---|---|---|---|---|
| እናት | Ynat | Mother | ማዘር | |
| እህት | Yhit | Sister | ሲስተር | |
| አክስት | Atcist | Ant | አንት | |
| እመቤት | Ymebet | Land Lady | ሌንድ ሌዲ | ይሠኛል |
| ወይዘሮ | Wayzero | Mrs | ሚሲሥ | |
| መምህራት | Memhrit | Teacher | ቲቸር | |
| ቄብ | Keb | Hen | ሔን | |

| | | | |
|---|---|---|---|
| ጊደር | Ghider | Cow | ካው |
| መሢና | Mesina | Cow | ካው |
| ላም | Lame | Cow | ካው |
| ገረድ | Ghered | Servant | ሴርቫንት |

| ተራ ጾታ | Terra Sota is a | Common Gender | ከመን ጀንደር | |
|---|---|---|---|---|
| ሰው | Seaw | Person | ፐርስን | |
| ልጅ | Lidge | Child | ቻይልድ | |
| ወላጅ | Owladge | Parent | ፓሬንት | |
| መካን | Mekan | ? | | |
| ሞግዚት | Moghizet | Co | | |
| ፈት | Fath | Bacheler | ባችለር | |
| እኔ | Ene | I | አይ | |
| አንቱ እርሦ | Antan, Erso | You | ዩ | ይሠኛል |
| ድመት | dimet | Cat | ካት | |
| ዘመድ | Zemed | Relation | ሬሌሽን | |
| ውሻ | Ushia | Dog | ዶግ | |
| ቤት | Beth | House | ሀውስ | |
| ዶሮ | Dowro | Hen | ሄን | |
| ወዳጅ | Wodage | Friend | ፍሬንድ | |
| ነብር | Nebir | Tigere | ታይገር | |

## ግኡዘ ጾታ Ghiuze Sota Neuter ኒውተር ።

| ግኡዝ ጾታ | Ghiuze Sota | Neuter | ኒውተር |
|---|---|---|---|
| ሠማይ | Semay | Sky | እሥካይ |
| ምድር | midre | Hearth | ኸርዝ |
| ውሃ | Wauha | Water | ዋተር |
| እሣት | Ysath | Fire | ፋየር |
| ፀሐይ | Tsahai | Sun | ሣን |
| ድንጋይ | Dingai | Stone | እሥቶን |
| ብልሃት | Bilhath | Knoledge | ኖሌጅ |
| ህመም | Himeme | Sikness | ሢክኔሥሥ |
| እህል | Ehil | Cereale | ሢሪያል |
| ደሥታ | Desta | Happy | ሀፒ |
| ትጋት | Tigath | | |

## ል ም ም ዶ ጾ ታ ።

1. ጾታ በአራት ምድብ የተወሠነ ሆኖ ከወንድ አምሥት ፤ ከሤት አሥራ ሁለት፤ ከተራ ጾታ አምሥት ከግኡዝ አሥር ይጻፍ ።

2. ከዚህ ቀጥሎ ከሚገኙ ጾታዎች ወገንነታቸው ይለይ ።

   አባት እናት ሠው ፤ ወጠጤ ወላጅ መከን እኔ ሎሌ ገረድ አከሥት ላም አንቱ ዶሮ ዘመድ ወዳጅ ሠማይ ብልሃት ደሥታ ምድር ውሃ ፀሐይ ህመም እኔ እኛ

3. ከዚህ ቀጥሎ ከሚገኙ ጾታ ወገንነታቸው በመግለጽ ይተርጐም

   እኔ. እኛ. ብዙ. ብቻ. ሁሉ. ሠው. አንድ. እንሠሣ. አራዊት. ተዋህሥያን. በራሪ. ከናፊ ።

## ቁጥር

ቁጥር ማለት በነጠላና በብዛት የሚነገር ወይም ዘዴ ነው ። እነሆ ለምሳሌ አንድ ቁጥር አንድ ምክንያት በብቸኝነት ይዞ በተነገረ ጊዜ ንጥል ቁጥር ይሠኛል ። እንዲሁም አንድ ቃል (ዎች) ወይም (ች) ወይም (ኛ) በምክንያት መድረሻ ላይ ገብተው ሢገኙ ወደ ብዜት ቁጥር ተለውጦ ይታያል ። ለምሳሌ

(1) እኔ ንጥል (ነጠላ) ቁጥር ሢያሰማ ፤

(2) እኛ ብሎ ብዝ (ብዙ) ቁጥር ያሥገኛል ።

(3) ሰው ብሎ (ሰዎች) ብዜት ቁጥር ያሠማናል ፤ እንደነዚህ የመ ማሰሉትን ቁጥር የሚል ሥያሜ ተቀብለው ይገኛሉ ።

## Number

There are two Numbers, Singulr and Plural, The Plural is Formed as it is:

(a) By adding «s» to the Singular, eg, Boy, Boys, Girl, Gils.

(b) By adding «es» for Worde ending in a Sibilant or «o», eg. Church, Churches; brush, brushes; box boxes.

(C) Words ending „y„ Preceded by a consonant change «y» to «ies», eg. Lady, Ladies, Fly, Flies.

(d) Words in «f» or «fe» Changing to «ves», eg. Leaf, leaves; wife, wives, etc.

### ቁጥር Kutir is a Number ናምበር ።

| | | | |
|---|---|---|---|
| ንጥል ቁጥር | Neteela Kutir | Singular | ሲንጉለር |
| ብዙ ቁጥ | Biz Kutir | Plural | ፕሉራል |
| ልጅ ንጥል | Lidge Netela | Boy is a Sing- | ቦይ ኢዝ ሲንጉለር |
| ቁጥር ነው | Kutir neu | ular Number | ናምበር |
| ልጆች ብዝ | Lidgyoch Biz Kutir | Boys is a plural | ቦይ/ሥ ኢዝ ኤ |
| ቁጥር ነው | Neu | Number | ፕሉራል ናምበር |
| ወይዘሮ | Woyzero | Lady | ሌዲ |
| ወይዛዝርት | Woyzazirt | Ladies | ሌዲ/ሥ |

### ሞያ Case

ሞያ ማለት ገቢርና ድርጊት ለማሳወቅ ቅጽል ተውሳከ ግ/ መስተዋድድ መስተጻምር ቃለ ግን ተግባራቸው ለመግለጽ ሲገቡ ስልታቸው የሚታወቅበት ሁኔታ «ሞያ» ተብሎ ተሰይሟል ።

ስመ ሞያ ( ግብረ ሞያ ) ( ባለቤት ሞያ ) የተባለው „ ማን ምን • መን/ሥኤ ጥያቄ በማቅረብ ለሚገኝ ድርጊት ፈጻሚ ( ባለቤት ) ምን እንዳለው ምን እንደፈጸመ ምን እንደተሠራበት ማን እንደሆነ • ግ/ሥ › ሁኔታው የሚነገርለት ስምና ስመ ምትክ ፡ አድራጊ ) ለፈጸመው ሁኔታ የሚታወቅበት ሞያ ተብሎ ይነገራል ። ለምሳሌ አቶ አማረ ተዋጋ ፤ እነሆ « አቶ „ የአክብሮት ስመ ሞያ ሲሆን « አማረ " የተባለው ፡፡ ምድብ ስም ፡፡ ሞያው ሠሪ ወይም ገባሬ ሞያ ወይም ( ባለቤት ) ወይም አድራጊ ጾታው ወንዴ ሆኖ ቁጥሩ ንጥል ( ነጠላ ) ነው ።

( ተዋጋ ) የተባለው ግ/ሥ (ድርጊት) አቶ አማረ መዋጋቱን በሞያነት ሰያሚ መልክ ገልጿል ።

እንዲሁም ነጋሪው ስም ሳይጠቅስ « ተዋጋ » ብሎ መግለጫውን ቢገታ ኖሮ " ማነው" ተብሎ ጥያቄ ማቅረብ ባስፈለገ ነበር ከዚያም በኋላ ከመ ልስ ጠባቂው ዘንድ " ማነው " ተብሎ ለቀረበው ጥያቄ " አማረ " ነው የሚል መልስ ለጠያቂው በተነገረ ነበር ፤

እንግዲህ የአቶ አማረ ሞያ በከፊል ሳይሆን በሙሉ አረፍተ ነገር ጣፍጦ ስለተገለጸ በቀራቢው ምሳሌ አውቀናል ። ስለዚህ ስመሞያ ( ባለቤተ ሞያ) ድርጊት ( ግሥ ) ሲነግርለት አድራጊው ስመሞያ ፈጻሚ ተብሎ ይነገራል ። ሌላውም በዚሁ ዓይነት ምሳሌ ሊፈጸም ይቻላል ።

ግዜተ ሞያ (ጥገ ሞያ) ( ጥገኛ ድርጊት ተቀባይ ) ተብሎ ወይም ተደራጊ በመስተ ጻምር እገዛና በመጠይቅ ባህል " ማን ፡ ምን " የሚል መንሥኤ ጥየቃ በማቅረብ " ተደራጊ ወይም ጥገኛ ድርጊት ተቀባይ" የተገብሮ ግሥ ሲነገርለት የሞያ ተገዢ ወይም «ግዜተ ሞያ» ተብሎ ይነገራል ለምሣሌ «አቶ አማረ ተገደለ » እነሆ « ተገደለ » ተብሎ በተነገረው ድርጊት (ግሥ) ተገብሮ መሪነት «አቶ አማረ በሌላ ፡ አሥጠጊ (አሥከላይ) እጅ ሞያ ተቀይ ወይም የሞያ ጥገኛ ተገዢ መሆኑን በምሣሌው ተረድተናል እንዲሁም ይህንን የመሣሠለው ይህንን ወደሆነው ሞያ ይከተላል ።

ጥቀመ ሞያ ወይም ንብረተ (ሞያ) ለማወቅ " የ. ዬ. ሬ. ኔ. ሁ. ሀ. ሽ. ው. ዎ. ን. ኛ" በነዚህ አሥራሀንድ ፡ ግእዘ ፡ ሁካይብ ፡ ሣድስና ፡ ሣብአዊ ፡ ፊደሎች ጥቅመ ሞያ መመሥረት ሚቻል ከነዚህም በአንዱ «የ» ፊደል በመነሻ ገቢ ሆኖ ሌሎቹ ግን በሥመ ምትክ መድረሻ አገናዛቢ ሆነውሚገኙ " ጥቅመ ሞያ፦ ተብሎ ሊፈ ጸም ይቻላል ።

## አግባበ ሞያ (ሥካተቃል) ።

አገባበ ሞያ ማለት አሠካክ ማሣካት ማቀናበር ሚሆን በሥምንቱ የንግግር በሮች አልፈን እያንዳንዳቸው የሚከታተሉበት የአቀማመጥ ወይም የአገባብ ተራ የሚይዙበት ዘዴ ሥካተቃል ይሠኛል ሁኔታውም እንደዚህ ነው ።

(1) ባለቤት ( አድራጊው ) ከፍ ብሎ እንደተገለጸው ጾታው ወንዴ ከሆነ ሥለእሡ ነጋሪው ግሠ ሞያ በወንዴ ጾታ አነጋገር ማከናወን ያሥፈልጋል ለምሣሌ ታረቀኝ መጣ ።

(2) አድራጊዋ ሤቴ ጾታ ። ከሆነች ሥለእሡዋ ነጋሪ ግሥ በሤቴ ጾታ አነጋገር መፈጸም ይገባል ። ለምሣሌ ትእግሥት ዘለቀች ፤

(3) አድራጊው ወይም አድራጊዋ ሞያቸው በነጠላነት ከተነገረ ድርጊቱም ነጠላ ይሆናል ድርብም ( ብዝ ቁጥር: ) ከሆነ የብዛት መልክ ይከተላል እነሆ ለምሣሌ ።

(ሀ) ትእግሥት ብቻዋን ዘለቀች–ች ( ነጠላ ) ሞያ ፤
(ለ) ዘሪቱና ታረቀኝ ትምህርት ቤት ገቡ–ቡ (ብዙ) ሞያ ፣
(መ) ታረቀኝ ትምህርቱን ፈጽሞ አገሩ ገባ-ባ (ነጠላ) ሞያ ፤

(4) የአድራጊው ወይም ባለቤት ግሥ ሞያ ።

አድራጊ ( ገባሪ ) ከግሥና ከተደራጊ በፊት ገቢ ሆኖ የአገባብ ቦታውን ይይዛል ፤ ተደራጊውና ግሥ ከአድራጊው ሁዋላ እንዳመጣጣቸው ሥፍራ ይይዛሉ ።

(5) የድርጊት ተቀባይ ( ተደራጊ ) አግባብ ሞያ ፤

ድርጊት ተቀባይ ከአድራጊ (ባለቤት) በሁዋላ ከግሥ በፊት ወይም ከባለቤትና ግሥ መሀል ሥፍራ ይዞ ይገኛል ከዚህም ሌላ ከባለቤትና ጥቅመ ሞያ ሁዋላ ከግሥ በፊት ገቢ ይሆናል ለምሣሌ ።

(ሀ) ትእግሥት ጉንደርን ጉወበኘች
(ለ) ዘሪቱ ወደ አሥመራ ሄደች
(መ) ታረቀኝ ትምህርቱን | አከናውኖ | አዲሥ አበባ ተመለሰ ፣

እነሆ ጥቂት የአሠካክ ሞያ ልዩነት በዚህ በመጨረሻው ፤ የጥቅመ ሞያ ምሣሌ ታይቶአል፤ይኸውም | ትምህርት | ከባለቤት ኋላ ከድርጊት ተቀባይ ፊት ሆኖ ሥፍራ መያዙን ፤ ድርጊት ተቀባዩ ( አዲሥ አበባ ) መከተሉን አይተናል ፤

ሥለዚህ ( ድርጊት ሠጪ ) ወይም አድርጊ « ትእግሥት ዘሪቱ ፤ ታረቀኝ» ሢሆኑ ድርጊት ተቀባዮች (ተደራጊ) ጥቅመ ሞያ ተቀባዮች "ጉወንደር ፤ አሥመራ ትምህርቱን" ናቸው «አከናውኖ» ፍዘግሥ ሲሆን « ጉወበኘች ሂደች ተመለሠ» የተሠኘው ግሥ መሆኑን ግልጽ ነው ።

## Case

Case is the relation in which a noun or noun equivalent stands to other word. There are three cases in English grammer.

Nominative case, is used:

(1) When the word is the subject of the sentence, eg. The girl did the work, Here « girl » is in the nominative case.

(2) After the verb to be, If the nominative case had been used befor the verb, eg. It was He who did Here « he » is in hte nOminative case after the verb « was».

Objective case, is used :

(1) when the word is in the object (after a transitive verb), eg. I saw him « Him » is objective case governed by the

verb « saw «

(2) When the noun or pronaun is governed by a preposition, eg. I sent the pen for him «Him „ is objective case governed by the preposition « for »

Indirect objective case, is used :

Transitive verbs often, as in this example, take two objects one denoting a person, the other a thing.

(1) I taught him Amharic. Here is the word denoting the
(2) person is the Indirect objective case. The Indirect object is usually placed first. If the Direct object is placed first the Indirect object is preceded by a preposition.

Example

I Sent Some Money to him

Direct objective case | In direct objective case

Here is the word denoting the thing is the Directobjective case. the Direct object Some time placed first or on the preceding. If the Direct object is placed first the Indirect object is preceded by a Preposition.

Indirect object

I Sent his friend some money

Direct object

Indirect or dative object

I Sent some money to his friend

Direct or accusative object

formerly a dative case with distinct inflexions was used in English to express direct objects. but now identical forms are used for the accusative and dative, so the general term objective is used to cover both.

Possessive case, is used to denote a possessor.

It is formed by adding «s» to singular and plural nouns which do not end in «s» eg. The boys' book, the girls' bag and by adding apostrophe only, to plural, that do end in "s„ eg.

The boys' school, the lades' dresses.

N. B. where the last syllable of a singular noun begins and ends with "s„ the apostrophe only, and not another "s„ is omited, eg. moses' laws; a Weeks' holidays; Herculls' works and day's work two months' absenece, a thillings' warth etc.

## ሞያ moya is a case ኬዝ

| ሥመሞያ (ባለቤት) | sime moya (Balebet) is a | Nominetve case | ኖሞኔቲብ ኬዝ |
|---|---|---|---|
| ግሥ የሚነገርለት ለምሳሌ | Ghis yemineghirilet | is the subject of the sentence | ዘ ሣብጀክት ዖፍ ዘ ሤን |
| እሡ ነው ያደረገ | ysu neu yadereghe | or After the verb; If he | ትንሥ ፤ ዖር አፍተር ዘ |
| (እሡ) የተባለው | (ysu) yetebaleu | nominetive case had | ቬርብ ፤ ይፍ ዘ ፤ ኖሚኔቲ |
| ሥመምትክ ሞያው | simemtic moya | been used before the | ብ ኬዝ ሀድ ቢን ዩዝድ |
| አድራጊ ባለቤት ሲሆን | adraghi Blabet sihone | verb ; eg. It was he | ቢፎር ዘ ቬርብ ይት ዎዝ |
| (ነው ያደረገ) የተባለው | neu yadereghe yetebaleu | who did | ሂ ፤ ሁ ዲድ ሂር « ሂ ፤ » |
| ግሥ እሡ ማድረጉን | ghis ysu madregun | Here » He » is in nomine- | ኢዝ ይን ኖሚናቲብ ኬዝ |
| በሥመሞያ መልክ ገልጿል | bemoya melk gheltoal | tive case after the verb (was) | አፍተር ዘ በርብ « ዎዝ » |

| ግዜት ሞያ | Ghizet moya | is an objective case is used | ዖብክቲብ ኬዝ |
|---|---|---|---|
| (1) ወይም ድርጊት ተቀባይ ለማወቅ | (1) woym dirghit Tekebay | (1) when the word is in the | (1) ሁዌን ዘ ወርድ ኢዝ ኢንዘ |
| በግሥ ነጋሪነት ማወቅ | beghis negarinet | object (aftere a transitive | ትራንዚቲብ |
| ይቻላል ፤ ባለቤት ሞያው ግሥ | mawek Ichialal, | vrbe), eg. I saw him | ቬርብ ፤ አይ ሦ ሂም |
| ሚነገርለት የሞያ ተገገር | balabet mayau ghis | •him« is objective | «ሂም » ኢዝ ዖብገክቲብ |
| ተብሎ ይነገራል ለምሳሌ | sineghirlet yemaoya | case govrned by the | ኬዝ ገበርንድ ባይ ዘ ቬርብ |
| እኔ እሡን አየሁ እነሆ | teghji teblo ynegheral | verb « saw » | "ሦ» |
| "እሡ» ተብሎ የተነገረው | lemisale | | |
| ሥመ ምትክ ባለቤት (አየሁ በተባለው) | ene Isun ayehu | | |
| ግሥ በኔ መታየቱን ተገለጸ | (ysu) tblo yetene- | | |

ghereu sime mitik,
balabet ( Ayehu )
betebaleu ghis, bene
metayetun, teghelet

(2) ሥም ወይም ሥመምትክ
በመስተዋድድ ድርጊት
ተቀባይ ሆኖ ሲገኝ ለምሳሌ
እኔ ብእሩን ለእሡ ላኩ
(እሡ) ሥመምትክ ግዜተሞያ
ሲሆን በ (ለ) መሥተዋድድ
ተገገር ሆኖ ተገኘ

(2) sime woyem sme-
mitik bemestewa-
did teghejinet dir-
ghit tekebay hono
sighegne lemisale
ene Bihrun lesu laku
(Esu) simemitik
ghizet moya sihon be (le)
mestewadid tegheji
hono teghegne

(2) when the noun or pronoun
is governed by a preposition, eg.
I sent the pen for hem
(Him) is a objective case
governed by the
preposition (for)

(2) ሁዌን ዘ ናውን ዖር ፕሮና
ውን ኢዝ ገበርንድ ባይ
ኤ ፕሬፖዚሽን ኤግዛምፕ
አይ ሜንት ዘ ፔን ፎር ሂም
(ሂም) ኢዝ ኤ ዖብጀክቲብ
ኬዝ ገበርንድ ባይ ዘ
ፕሬፖዚሽን (ፎር)

## ጥቅመ ሞያ Tikme moya is Possessive Case ፖዜሢብ ኬዝ

ጥቅመ ሞያ ለማወቅ
(የ. ዩ. ሬ. ኔ. ሁ. ሀ. ሽ.
ው. ዎ. ን. ኛ )በነዚህ
አሥራ አንድ ፊደሎች
ከነዚህም አንዱ (የ) ፊደል
በመነሻ ገቢ ሆኖ ሌሎቹ በሥመ
ምትክ መድረሻ አገናዛቢ

Tikme moya lemawek
(yie. ye. re. ne. hu. hoh
sh. Wu. wuo. nh, gna)
benezih asrahand fide-
lcch, kenezihum, andu
( yie ) fidel bemeneshia
ghebi hono lelochiu

Possessive case, is used
to denot a possessor
It is formed by adding
(s) to singular and
plural nouns which
do not end in (s) e. g.
The boys' book; the

ፖዜሢብ ኬዝ ኢዝ ዩዝድ
ቱ ዴኖት ኤፖዜሠር
ኢት ኢዝ ፎሮምድ ባይ
አዲንግ ( ኤሥ ) ቱሢ
ንጉላር ኤንድ ፕሉራል
ናውንሥ ሁዊች ዱኖት
ኤንድ ይን (ኤሥ) ኤግዛ

| | | | |
|---|---|---|---|
| ሆነው ሚገኙ ጥቅመሞያ ሊታወቅ ይቻላል ለምሳሌ | besimemitik medreshia aghenazabi, honeu sighegnu Tikme maya litaweke ychialal Lemisale | girl's bag and by adding apostrophe only, to plural that do end in( s ) The boys' school; the ladies' dresces | ምፕል ዘበይሥ ቡክ ፤ ዘ ገርልስ ባግ ኤንድ ባይ አዲንግ አፖሥትሮፍ ዎንሊ ቱ ፐሉራል ዛት ዱ ኤንድ ኢን (ኤሥ) ዘ በይሥ እሥ ኩል ዘ ሌዲሥ ድሬሥሥ |
| የ - የኔ | y- yene | is my | ማይ |
| የ - የአንተ | y- yeante | is your | ዩር |
| የ - የርሡ | y- yersu | is his | ሂዝ |
| የ - የአንቺ | y- yeanchi | is your | ዩር |
| የ - የኛ | y- yegna | is our | አውር |
| የ - የእርሥዎ | y- yerso | is yours | ዩርሥ |
| የ - የነርሱ | y- yenersu | is their | ዜይር |
| የ - የነዚያ | y- yenzia | is theirs | ዜይርሥ |
| ገንዘቤን —ን | genzehen —n | is myin | ማይን |
| ደብተሬ —ሬ | debtere —r | is my booKs | ማይቡክስ |
| ብርሃኔ —ኔ | berhane —ne | is my sight | ማይሳይት |
| ደብተርህ —ህ | debterh —h | is your books | ዩርቡክስ |
| ደብተርሽ —ሽ | debtersh – sh | is your books | ዩርቡክስ |
| ደብተራችን —ን | debterachin —n | is our booys | አውር ቡክሥ |
| ደብተርዎ —ዎ | debterio —o | is your books | ዩር ቡክሥ |
| ደብተራቸው—ው | debterachioW—ow | is their books | ዜይር ቡክሥ |




እነሆ ሥመ ምትክ ማለት በተራና በምድብ ሥም ፈንታ ገቢ ሆኖ የሚያገለ ግል ቃል ነው በቤተ ክህነት በኩል ።ተውላጠ ሥም። ተብሎ የምንገለገልበት ሢሆን በአማርኛችን ሥመምትክ በሠባት ክፍል እንደተመደበ በዚህ ታውቋል ለምሳሌ ።

(ሀ) እኔ አንተ አንቺ እኛ እናንተ ፤ እሱ እሷ እርሦ ፤ እነርሡ ፤ እነሆ እነዚህ ለነባቢነትና ለባዊነት ላለው ፍጡር የግልና ያክብሮት ሥመምትክ ነው ።

(ለ) እነኝህ እነኛ እነዚያ እየተሠ'ና የሚነገረው ለሚዳሠሥ'ና ለማይዳሠሥ በቅርብና በርቀት ምልከታን ለብሦ ለሚነገር ሥመምትክ ነው ።

(መ) መልመጃ መጽሀፍህ አያሻኝም የራሜ ይበቃኛል እነሆ በዚህ «የራሜ» የተባለው ምዙነ ሞያ ሢሆን «አያሻኝም» የተሠኘውን ፤ ቃለ ግሥና ሥመምትክ በውሥጠ ቀሪነት አግዶ ‹ይበቃኛል" በተባለው (ድርጊት ግሥ) ገልጾ ሥም ሣይ ጠቅሥ በሥመምትክ ተጀሥሮ በሠመምትክ ብቻ እንደ ተፈጸመ ተመልክተ ናል ሌላውም እንደዚሁ ያከናወናል ።

## The Pronoun.

A Pronoun is a word that stands instead of a noun, or name, equivolent, there are seven kinds of pronouns, as example

(1) I don't your books; mine are sufficient. Here «mine» is nominative case, subject of the verb "are"

(2) He made himeself King, He bought it himself, I did it my selif, you are not yourself to day, He did the work by himself, The little boy can walk by himself etc.

(3) Devid and Haileselasie I were both rulers of theire country, The |forner| was a judah King and, The |later| is an Ethiopian King, both are father and son, but they have no |such| different idea.

(4) The girl lost her bag, but she has changed her mined

| personal and possessive pronouns |

The boy who spoke was my brother;
The girl whom you saw was my sister;
She is a such editor hers style is most atractive and she hurt all the mens heart.

## ሥመምትክ Simemitk is a Pronoun ፕሮናውን

| | | | | |
|---|---|---|---|---|
| 1. | ምድበ ሥመምትክ | midibe Simemitk | personal pronoun | ፔርሦናል |
| 2. | ጥቅመ ስመ ምትክ | tikme Simemitik | possessive | ፖዜሢብ ፕሮናውን |
| 3. | ምዙነ ስመ ምትክ | mizune Simemitik | reflexive pronoun | ሪፍሌክሢብ ፕሮናውን |
| 4. | ምልክታ ስመ ምትክ | milketa Simemitik | demonstrative | ዴሞንስትሬቲብ ፕሮናውን |
| 5. | መጠይቀ ስመ ምትክ | meteyk Simemitik | interogative pronoun | ኢንቴሮጌቲብ ፕሮናውን |
| 6. | ወገነ ስመ ምትክ | waghne Simemitik | relative pronoun | ሬሌቲብ ፕሮናውን |
| 7. | ገሥጋሽ (ልቅ) ስመምትክ | lik Simemitik | indefinitive pronoun | ኢንደፊኒቲብ ፕሮናውን |

} ይሠኛል

መጠይቀ ስመ ምትክ (ማን ምን) የቱ

| ለምሳሌ | Lemsale | | Example | ኤክዛምፕል |
|---|---|---|---|---|
| ምድበ ሥመምትክ | Midib Seimemitik | is a | personal pronoun | ፔርሦናል ፕሮናው |
| እኔ | ené | — | I | አይ |
| አንተ | ante | — | you | ዩ |
| እሡ | isu | — | he | ሂ |
| እሷ | esua | — | she | ሺ |
| ያ | ia | — | it | ኢት |
| እኛ | egna | — | we | ዊ |
| እርሦ | ersso | — | you | ዩ |
| እነርሱ | enerssu | — | they | ዜይ |
| ጥቅመ ሥመምትክ | Tikme Simemitik | is a | Possessive pronoun | ፖዜሢብ ፕሮናውን |
| የኔ | yené | — | mine | ማይን |
| ያንተ | yante | — | yours | ዩርስ |
| የርሡ | yersu | — | his | ሂዝ |
| የርሡዋ | yersua | — | hers | ኸርስ |
| የሡ | y esu | — | its | ይትዝ |
| የኛ | yegna | — | ours | አወርስ |
| የርሦ | yerso | — | yours | ዩርስ |
| የነሡ | yenesu | — | theirs | ዜይርስ |

} ይሠኛል

